

# በቦሌ ክ/ከተማ የወረዳ 01 ብልጽግና ፓርቲ የኢንስፔክሽን እና ስነምግባር ኮሚሽን የ2017 በጀት ዓመት መሪ እቅድ

ሰኔ 2017

1. መግቢያ

የኢንስፔክሽን ስነ-ምግባር ኮሚሽን ከወረዳ እስከ መሰረታዊ ድርጅት በተሟላ ተቋም በመዋቀርና እና በሰው ሃይል ከተቋቋመ ጀምሮ የተለያዩ ስራ መስራት ተችሏል፡፡ በዚሁ መሰረት ያለፈው በጀት አመት ሲታይ የስራ መመሪያዎችን ስልጠና ማግኘት ፣ ተቋሙን በሰው ሃይልማደራጀት፤ ቢሮና የቢሮ ቁሳቁስ እንዲሟላ በማድረግ ተቋሙን የማዋቀር ስራ በመስራት ወደ ተግባር ለመግባት የተደረገው ጥረት የተሻለ ነው፡፡ በዚህም ለስራው አጋዥ የሚሆኑ የኮሚሽን ኮሚቴዎችን በአዲስ መልክ በብልጽግና ጉባኤ በማስመረጥ እና በማፀደቅ ተቋሙን የማጠናከር ተግባር ተከናውኗል፡፡ ስለሆነም በ2016 በጀት አመት ለስራ ምቹ ሁኔታዎችን በመፍጠርና ለስራ ማስጀመሪያ የተወሰደውን ጊዜ ግምት ውስጥ በማስገባት የነበሩ ጥንካሬዎችና ድክመቶችን በመለየት ለ2017 በጀት አመት ለስራ የተሸሉ ስራዎችን ለመስራት ይህን እቅድ ማዘጋጀት አስፈልጓል፡፡ በዚሁ መሰረት በእቅዱ ውስጥ ዝርዝር ጉዳዮችን እንዲይዝ ተደርጎ ታቅዷል፡፡

## 2.የእቅዱ መነሻ ሁኔታዎች

### 2.1 የወረዳ የኮሚሽን አመራር ሁኔታ

**የወረዳ** አመራር ሁኔታ በተመለከተ 1 አመራር ያለ ሲሁን አጠቃላይ **ኮሚሽን** በመምራትና በማስተባበር ረገድ ከዝግጅት እስከ ማጠቃለያ ምእራፍ ያሉ ተግባራትን ለታችኛው መዋቅር በቸክ ሊስት በማስደገፍ ስራዎችን የመቆጣጠር እና ተግባራትን የመቆጣጠር ስራ የተሰራ ሲሆን ከዚህ ባሻገር በተለያዩ ሁኔታዎች የሚቀርቡ ቅሬታዎችን ምላሽ በመስጠት ረገድ ሚናው ከፍተኛ እንደሆነ ያሳያል፡፡ በዚሁ መሰረት በኮሚሽኑ በወረዳ ደረጃ 9 ቅሬታ በፅሁፍ ቀርቦ ለ9ኙም ምላሽ በመስጠት የተሻለ ስራ መስራት ተችሏል፡፡ ሆኖም ግን መስተካከል የሚገባው ጉዳይ ቢኖር ተቋሙ ተጠያቂነት ባለው መልኩ ክትትል እያደረገ እንዲሁም የአማተር ኮሚቴዎችን በአግባቡ ጠርንፎ ይዞ ወደ ስራ ከማስገባት ከአመት ወደ ዓመት ብሽጋገሩም አሁንም ቢሆን ክፍተት ያለበት ሲሆን ወደ ታች አንድ ደረጃ ወርዶ ድጋፍ ከማድረግና መሰረታዊ ድርጅቶች እና ህዋሳት ያሉባቸውን ችግሮች ለይቶ ከመፍታት ጅምሮች ቢኖሩም ነገር ግን በቂ እንዳልሆኑና ውስንነቶች እንዳሉ ታይቷል፡፡

በሌላ መልኩ ምንም እንኳ ፅ/ቤቱ ስራዎችን በመስራት በተለይ የፓርቲውን ቁመና ጠንካራ የማድረግና የፓርቲ አሰራር ተጠብቆ እንዲሄድ ከማድረግ አንጻር ሚናው የጎላ ቢሆንም ከላይ ጀምሮ የድጋፍና ክትትሉ የተጠነከረ እየመጠ መሆን ተቋሙ እግር ተክሎ እንዲሄድ ከማድረግ አንጻር የራሱ ጥንከሬ እንዳለበት የሚያሳይ ቢሆንም ነገር ግን በወረዳ ደረጃ በዘርፉ በኩል የተለያዩ ተግባራት በመፈጸም ረገድ በየማህበራዊ ተቋማት ወርዶ ዘርፉ ያለበት ሁኔታ ለስራ እና ውይይት ምቹ የመሆንና ያለመሆን ሁኔታዎችን ማየት፣ወቅቱን የጠበቀ የግንኙነት ጊዜ በማስቀመጥ ስራዎችን መገምገም የተቻለበትን ሁኔታ መፍጠር ተችሏል፡፡

### 2.2. የኮሚሽን ኮሚቴዎች ሁኔታ

የኮሚሽን ተልእኮ ከሚፈጽሙት ቋሚ የኮሚሽኑ አመራሮች ባሻገር የኮሚሽን ኮሚቴዎች አንዱ ሲሆን በ7 የአማተር ኮሚቴዎች የተዋቀሩ ሲሆን እነዚህንም ወደ ተግባር ከማስገባት አንጻር ሲታይ የራሱ ክፍተት ቢኖርም ስራውን ለመጀመር ግን የተሻለ እንደሆነ ያሳያል፡፡ ከአደረጃጀት አንጻር ሲታይ ጥሩ ነው ነገር ግን ከኮሚሽኑ አሰራር አንጻር ክፍተት ያለበት ሲሆን ኮሚቴው ተግባራትንም ሲፈጽም በሃላፊነትና ተጠያቂነት እንዳለበት አውቆ ከመስራት አንጻር ውስንነት ያለበት ሲሆን ይህን በቀጣይ በትኩረት ይዞ መስራት ያስፈልጋል፡፡

## 2.3. ቅሬታ ከመፍታት አንጻር

የሚቀርቡ ቅሬታዎችን በፍጥነት አይቶ ውሳኔ ከመስጠት አንጻር በተለይ በወረዳ ደረጃ የተዋቀረው የኮሚሽን ኮሚቴ ቅሬታን ከመፍታት አንጻር እንዲሁም ወቅቱን የጠበቀ ምላሽ ከመስጠት አንጻር የተሻለ እንደሆነ ያሳያል የዚህ ማሳያ የሚሆነው ከቀረቡት 9 ቅሬታ ውስጥ 9 ኙም መላሽ ለመስጠት ተችሏል፡፡ የተሠጠው ምለሽ ውስጥ 4 ፓርቲ የወሰነው ውሳኔ ትክክል ስሆን 5 ፓርቲ የወሰነው ውሳኔ ትክክል አይደለም በመለት በመየት ወደ ስራ ገበታ እንድመለስ ተደርጉዋል ፡፡አሁንም እስከ መሰረተዊ ድርጅት ድረስ ቅሬታ ከመቅረብ አንጻር ውስንነት መኖሩን ይታያል ፡፡

## 2.4. የሱፐርቪዢን እና የኢንስፔክሽን ስራዎችን በተመለከተ

የኮሚሽን ተግባራት ለማጠናከርና አጠቃላይ የፓርቲ ተግባራትን አደረጃጀትና አሰራር መመሪያውን የተከተለ የሱፐርቪዢን ስራ የተሰራ ሲሆን በዚህም መሰረት በወረዳ የተዘጋጀ ቸክ ሊስቶችን በወረዳ ደረጃ ባሉ የመ/ድርጅትና ህዋሳት እንዲሁም ከመረጃ አንጻር ያሉትን አጠቃሎ በማየት ያሉ ጠንካራና ደካማ ጎኖችን በማካተት የግብረ መልስ ስርዓት በመዘርጋት ለሚመለከታቸው የፓርቲ ተቋማት በማሳዎቅ የማስተካከያ ስራዎችን እንዲሰሩ የማድረግ ስራ መስራት ተችሏል፡፡

የሱፐርቭዥን ስራ ሁለት ተቅዶ 1 ጊዜ አስተመሪ የሆኔ ሱፐርቭዥን በመድረግ ግብረመልስ መስጠት ተችሉዋል ፤ በተጫመሪ የኢንስፔክሽን ስራ 2ተቅዶ 1ጊዜ ተደርጉዋል

በሱፐርቭዥን እና በእንስፔክሽን ስራ የመጠው ለውጦች መኖሩን

የአበል ምልመላ ሁኔተዎች በአሳራር የተመለመለበት ሁኔታዎች መተየቱ

የኮንፈረንስ ሁኔተዎች አሳረር መያዙን እንዲሁም

የህዋስ ውይይት ሁኔታ ከ ጊዜ ወዳ ጊዜ የተሸሸለ መኖኑን የኢንስፔክሽን ስራ የመስተዋዋቅ ስራዎች ጎልቶ የተየበት በጀት አበመት መሆኑን ነው፡፡

የፓርቲ ንብረት በመመዝገብ እና የመቆጣጠር ስራ ውስንነት መኖሩን በኢንስፔክሽኑ ተረጋግጧል ፡፡

በፓርቲ በኩል ያለው ንብረት በአመራር ስም ተመዝግቦ አለመቀመጡ በደካማ ጎን አይተነል ፡፡

## 3/የቁልፍ ተግባሩ ዓላማ

### 3.1 የኮሚሽኑ ዓመታዊ እቅድ መነሻ በማድረግ ከወረዳ እስከ መ/ድርጅት በተደራጀ ሁኔታ የራሳቸው ዕቅድ እንዲያዘጋጁ ከማድረግ አንጻር፤

- የኮሚሽኑ እቅድ ዝግጅትን በተመለከተ ከክ/ከተማ ኮሚሽን የወረደውን መነሻ በማድረግ ወደ ወረዳችን ነባራዊ ሁኔታ በመቀየር ዝርዝር እቅዶችን በበጀት አመቱ የሚሰሩትን በተቋም ደረጃ ያልተዋቀረና በኮሚሽን ኮሚቴ የተደራጀ በመሆኑ ምክንያት የተጠናከረ ነገር ስለሌለው በአዲስ መልኩ የተቋቋመውን ኮሚሽን ለማጠናከር በእቅድ ከላይ እስከ ታች ድረስ በማጠናከር ረገድ ተግባራቶች በእቅድ መመራታቸው እና የእቅድ ዝግጅቱ የተሻለ ያደርገዋል፡፡
- በሌላ መልኩ እቅድ ዝግጅቱን በተመለከተ የክ/ከተማውን መነሻ በማድረግ ወደ ወረዳ በመቀየር የተዘጋጀውን እቅድ ለመሰረታዊ ድርጅት በማውረድ እቅዳቸውን እንዲያዘጋጁ ተደጓል፡፡

### 3.2 ኦረንቴሽን ከመስጠት አንፃር፤

- የእቅድ ዝግጅት በተቋሙ የማዘጋጀት ስራውን በተገቢ ሁኔታ በማዘጋጀት ረገድ ከኮሚሽን ኮሚቴ አመራሮች ጋር በጋራ በማድረግ የእቅድ ኦረንቴሽን መስጠት ተችሏል፡፡

### 3.3 አደራጃጀትን በተመለከተ ያለበትን ሁኔታ የወረዳ፤መ/ድርጅትናና ህዋስ፤

- እንደ ወረዳችን የፓርቲ አደረጃጀት ሲታይ ለውጡን ለማስቀጠልና ፓርቲውን ለማጠናከር በየጊዜው የተለያዩ ሪፎርሞችን በመስራት እና የአሰራርና የአደረጃጀት ስራዎችን በመስራት ያለው ሚና ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተለወጠና እየተሻሻለ የመጣ ሲሆን ይህ ደግሞ ከወረዳ እስከ መሰረታዊ ድርጅት ድረስ የመልሶ ማደራጀት ስራዎችን በመስራት የህዝባችንን ጥቅም ለማረጋገጥና ጠንካራ ፓርቲ ከመፍጠር አንጻር ሚናው የጎላ ሆኖ ታይቷል፡፡
- በዚሁ ረገድ አጠቃላይ እንደ ወረዳችን 5 አስተባባሪ ኮሚቴ፣6 የፓርቲ ኮሚቴ፣1 የ/ኢ/ስነ-ምግባር ኮሚሽን ኮሚቴ፤13 የካቢኔ አባላትና 6 ነን ካቢኔ አባላት እና 2

የምክርቤት  የተዋቀረ ሲሆን ይህ በአጠቃላይ ሲታይ  በ 33 አመራር የተዋቀረና ህንንም የሁሉንም ህብረ ብሄራዊነት የጠበቀ አሰራር ለመስራት የተደረገው ጥረት የተሸለ እንደሆነ ታይቷል፡፡

- በሌላ መልኩ የወረዳ የመ/ድርጅት፣የህዋስ ብዛት እና አመራር ብዛት ሲታይ፡- በ2016 ዓ.ም የመሰረታዊ ድርጅት ብዛት 33 ሲሆን አሁን 36 መድረሱን  የህዋስ ሁኔታን  የአመቱ ሲታይ አጠቃላይ 219 ህዋሳት የነበራ አሁን 223 መደረጀት ተችሉዋል፡፡ በአመራር ብዛት 360 መሰረተዊ ድርጅት ስሆን 892 የህስ አመራር የተዋቀረ የሚሆኑ ያሉት ሲሆን ከአባላት አንጻር ሲታይ አጠቃላይ አባላት 7579 ስሆን አሁን 8193 የወረደችን የብልጽግና ፓርቲ አባል ናቸው፡፡በተጨመሪ የእናት ድርጅት 6 መሰረተዊ ድርጅት የነበረው አሁን 9 የድሰበት መሆኑን ከበለፈው ዓመት 50 ፐርሰንት መጨመሩን ታይቱዋል ፡፡

### 3.4 ለአደረጃጀት የሚያስፈልጉ በጀት ፤ቢሮ፤ተሽከርካሪና ግብአት ከማሟላት አንጻር፤

- የብልጽግና ፓርቲ ኢንስፔክሽንና ስነምግባር ኮሚሽን ተቋሙ የአሰራርና መመሪያ በማዘጋጀት ተቋሙ ፓርቲያችን ጠንካራ ሆኖ እንዲወጣ ለማድረግ እና አሰራርና መመሪያን በመከተል ጠንካራ ተቋም በመፍጠር ረገድ ሚናው ከፍተኛ ሲሆን ከዚህ መነሻነት አንጻር ሲታይ ተቋሙን በአዲስ መልኩ በማደራጀት ከወረዳ እስከ መ/ድርጅት ድረስ ለማደራጀት የተደረገው ጥረት ከፍተኛ ሲሆን ሆኖም ግን አሁንም መስተካከል ያለባቸው እና ተቋሙ ካለው እይታ ጀምሮ ለማስተካከል ከፍተኛ ጥረት ማድረግ ስለሚያስፈልግ ይህን ግምት ውስጥ በማስገባት ማጠናከር ያስፈልጋል፡፡

እንደ ወረዳችን የቢሮ አደረጃጀቱ ከፓርቲ ፅ/ቤት የወጣ ራሱን ችሎ ቢሮ የተሰጠው  ሲሆን ይህም ስራ ለመስራት ምቹ የሆነ በከፊል ተደራጀ እና ከግብአትም አንጻር ከሞላ ጎደል ጥሩ ፡፡

ይህ የሚያሳየው በተለይ በወረዳ ደረጃ ለዘርፉ ትኩረት ከመስጠት አንጻር የተሸለ ትኩረት የተሰጠው መሆኑን ያሳያል፡፡

## 4/የአበይት ተግባራት አፈፃፀም በተመለከተ፤

### 4.1 የአባለት መብት ከማስጠበቅና ችግሮችም ሲኖሩም ወቅታዊና ተገቢውን ድጋፍ ከመስጠት አንፃር፤

- እንደ ወረዳችን የኮሚሽኑን  አሰራርና መመሪያ ከማስጠበቅ አንጻርና አባላትም ይሁን አመራሮች ቅሬታ ሲኖራቸው አባሉን መብት ማስጠበቅ ላይ በወረዳ ደረጃ ለ7 የኮሚሽን ኮሚቴ አመራሮች ግንዛቤ የተፈጠረና እንዲሁም ከሶስቱም(ከቢሮ፤ከመኖሪያ፤ከጥቃቅን) ማህበራዊ ተቋም የተውጣጡ 37 ኮሚቴዎች እና የመሰረተዊ ድርጅት 245 አመራሮች ድምር 282 አመራር  በኮሚሽኑ አሰራርና አደረጃጀት ዙሪያ ስልጠና መስጠት ተችሏል።
- ከዚህም መነሻነት በወረዳ 01  10 አመራር ከአመራርነት የተነሳ ሲሆን 9 አመራር ቅሬታ ያቀረበ በመሆኑ ጉዳይን በማየት እና ከወረዳ ፓርቲ ኮሚቴ ጋር በመነጋገር  ቅሬታቸው እንዲታይላቸው ተደርጓል፡፡

### 4.2 የአባላት ምልመላ፤አያያዝና ግንባታ በተመለከተ፤

- በዚሁ መሰረት የአባላት ምልመላን በተመለከተ በበጀት አመቱ ለመመልመል የታቀደው እቅድ በተቋም በአጠቃላይ በበጀት አመቱ አዲስ አባል ለመመልመል የተያዘ እቅድ 650 ሲሆን ክንውን 650 አባላትን መመልመል ተችሏል፡፡
- የአባላት አያያዝና ግንባታን በተመለከተ አጠቃላይ ከተለያዩ ማህበራዊ መሰረቶች ከተመለመሉ አዳዲስ አባላት ውስጥ 589 አባላት በፓርቲው በፕሮግራምና በህገ-ደንብ ላይ እንዲወያዩ ተደርጓል፡፡
- በዚሁ መሰረት የተመለመሉ አባላትን ህገ ደንብ ከማወያየት አንጻርም ሲታይ አብዛኛው አባላት ህገ ደንብ ተወያይቶ እንዲያልፍ የተደረገ ሲሆን ከዚህ በተጨማሪም የአባሉን ሙሉ ፋይሎችን በማደራጀት ከቅጽ 01 እስከ ቅጽ 08 ድረስ በማደራጀት የአባላትን መረጃ የተያዘበት ሁኔታ ሲታይ ክፍተት እንዳለ ያሳያል፡፡

### 4.3 የአባላት ቅሬታ አቀራረብና የአፈታት ሁኔታ በተመለከተ፤

- ኮሚሽኑ ከተቋቋመለት አላማ አንጻር ሲታይ አንዱና ዋንኛው የአባላትን ቅሬታ እና አቤቱታዎችን በመቀበል እንዲሁም የፓርቲ አሰራር ማስጠበቅ ሲሆን ከዚህም ውስጥ እንደ ወረዳችን የቀረቡ ቅሬታዎች 9 ሲሆኑ 9 በፓርቲው አሰራር ምክንያት የከ/ከተማው ፓርቲ ፅ/ቤት ምላሽ ቅሬታቸው የተፈታ ነቸው፡፡ እነዚህ ቅሬታዎች የቀረቡበት አግባብ ሲታይ በቃል የቀረበው ሁሉም በጽሁፍ ማቅረብ ችለዋል፡፡ይህ የሚያሳየው ተቋሙ ለአባሉና ለፓርቲ አሰራሮች መጠበቅ ትኩረት ሰጥቶ እንደሚሰራ የሚያሳይ እንደሆነ ያሳያል፡፡

### 4.4 የፓርቲው ሀብት ኦዲት ከማስደረግ አንፃር፤

- የፓርቲውን ሃብት ኦዲት ከማድረግ በተለይ ንብረቶችን በአግባቡ መዝግቦ ይዞ ተጠያቂነት ስርአት ለማበጀት ይረዳ ዘንድ በየዘርፉ ያሉ ንብረቶችን እንዲሁም ብዛታቸውንና አይነታቸውን ለይቶ በመያዝ ለመስራት የሚደረገው ጥረት የተሻለ ለማድረግ ከማድረግ አንፃር ክፍተት አለ፡፡

### 4.5 የአባላት ወራዊ መዋጮ ገቢን በተመለከተ፤

- የአባላት ወርሃዊ መዋጮ ገቢ ከማሰባሰብ አንጻር በወረዳ ደረጃ በተቀመጠው ኖርም መሰረት ገቢውን ከማሰባሰብ አንጻር በበጀት አመቱ የተሻለና በእቅዱ መሰረት ለማሰባሰብ የተደረገው ጥረት ከፍተኛ እንደሆነ አሳይቷል፡፡ በዚሁ መሰረት በበጀት አመቱ ለማሰባሰብ የተያዘው መከፈል ያለበት አባል 8193 ሲሆን የከፈለ አባል ብዛት ሲታይ 8193 በብር ሲገለጽ እቅድ 205,853.53 ሲሆን ክንውን 282,780 በሙቶኛ ሲሰላ 137 % ነው፡፡ ከዚሁ ጋር በተያያዘ ወርሃዊ ክፍሉ በትክክል የሚከፍሉ 8193 የማያንጠባጥቡ እና አዳዲስ የተመለመሉ አባላት ሙሉ ሉሙሉ እንዲከፍሉ የተደረገው ጥረት የተሸለ ነው፡፡

### 4.6 ደረሰኝ በአግባቡ ከመጠቀም አንፃር፤

- የአባላት ክፍያ ከመሰብሰብ አንጻር የተሻለ ስራ የተሰራ ሲሆን በዚህም ማሳያ የሚሆነው ከተያዘው አቅድ አንጻር የተሻለ የመሰብሰብ አቅም መፍጠር መቻሉ አንዱ ማሳያ ነው፡፡ ከዚህ ጋር ተያይዞ ከአባላት

የሚሰበሰበውን ገንዘብ በደረሰኝ ከመሰብሰብ  አንጻር ሲታይ ሁሉም ገንዘቦች በባንክ ሲስተም ገቢ የሚደረግ ሲሆን ይህ እንደ ጥሩ ነገር ተወስዶ እንዲሁም ገንዘቡን ከፓርቲ ፋይናንስ በደረሰኝ ርክክብ መደረጉ የተሻለ ያደርገዋል፡፡

- ሆኖም ግን ለከፈለው አባላት በስሙ ደረሰኝ አዘጋጅቶ ከመስጠት ይልቁን በመሀቀራዊ መሰረቱ ስም በጥቅል ቆርጦ የመስጠት ሁኔታ ተቀጥሎ እንዳለ በሱፐርቪዢንና ባወረድነው ቸክ ሊስት ማረጋገጥ የተቻለ ሲሆን ይህንን በዝህ በጀት ዓመት በፍጥነት ማስተካከልና ለአባላት ደረሰኞች ተቆርጠው መሰጠት ይገባቸዋል፡፡

## 4.7 የአባላትና የፓርቲው መረጃዎች (ማህደር) በዘመናዊ መንገድ ተይዘው ጥቅም ላይ ስለመዋላቸው ተገቢውን ክትትል ከማድረግ አንፃር፤

- የፓርቲም ሆነ የአባላት መረጃዎችን በዘመናዊ የመረጃ ስርአት ከመያዝ አንጻር ሲታይ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተቀየረና በተለይ ፋይሎችን አደራጅቶ በሃርድ እና ሶፍት ኮፒ በመያዝ አስፈላጊ በሆነ ወቅት መረጃዎችን በቀላሉ ለማግኘትም ይሁን የአባላቱን የተሟላ መረጃ በመያዝ እየተሰራ ያለው የመረጃ አያያዝ ስርአት  ክፍተት ያለበት መሆኑን ያሳያል፡፡ ይህ ማለት ግን በሁሉም መረጃ የለም ማለት አይደለም፡፡ በመሆኑም ይህን ማስተካከልና መረጃዎች የስራ ዘርፍን ለይቶ በማዎቅ የተሟላ መረጃ መያዝ ላይ ማስተካከል ያስፈልጋል፡፡

## 4.8 የሱፐርቪዥን ስራን በተመለከተ፤

- የኮሚሽን ተግባራት ለማጠናከርና አጠቃላይ የፓርቲ ተግባራትን አደረጃጀትና አሰራር መመሪያውን የተከተለ የሱፐርቪዢን ስራ የተሰራ ሲሆን በዚህም ከወረዳችን ቸክ ሊስት በማዘጋጀት  በወረዳችን ውስጥ ባሉ የመ/ድርጅትናና ህዋሳት እንዲሁም ከመረጃ አንጻር ያሉትን አጠቃሎ በማየት ያሉ ጠንካራና ደካማ ጎኖችን በማካተት የግብረ መልስ ስርዓት በመዘርጋት ለሚመለከታቸው የፓርቲ ተቋማት በማሳዎቅ የማስተካከያ ስራዎችን እንዲሰሩ የማድረግ ስራ መስራት ተችሏል፡፡ በዚህም መሰረት ከኮሚቴው የተውጣጡ 7ቱም ተሳታፊዎች በሱፐርቪዢን ግኝቶችን በመዳሰስ ለወረዳው ፓርቲ ፅ/ቤት አንድ ጊዜ ግብረመልስ መስጠት ተችሏል፡፡

## 5.2 የኮሚሽን ተግባራትን በተመለከተ በጥንካሬና በጉድለት

**በጥንካሬ፡-**

- ✓ ኮሚሽኑ መ/ድርጅት ድረስ ማዋቀርና ወደ ስራ ማስገባት መቻሉ የፓርቲውን ጥንካሬ የሚያሳይ መሆኑ
- ✓ ለጠቅላላ አመራሩ ስልጠና መሰጠቱ በጥንካሬ
- ✓ በወረዳ ደረጃ በተለይ ለአመራሩ ግንዛቤ መፍጠሪያ መድረክ ማመቻቸት መቻሉ እንዲሁም

- ✓ የሱፐርቪዢን ቸክ ሊስት በማውረድ ተቋሙን በአግባቡ ያለበትን ሁኔታ ለማወቅ መሰራት መቻሉ በስራው ላይ ማነቃቂያ መፍጠር መቻሉ
- ✓ አመራሩም ይሁን አባሉ የተቋሙ መፈጠር ቅሬታዎች ሲፈጠሩ ሙብታችንን እና የአሰራር ክፍተቶችን ይፈታል ብሎ የማሰብ ሁኔታ መፍጠር መቻሉ

**በድከመት፡-**

- ✓ ስራዎችን በተገቢ ሁኔታ እየገመገሙና በድከመትና በጥንካሬ በተቋም ደረጃ ለማድረግ ውስንነት መኖር
- ✓ በስራዎች መሀል ክፍተት መፈጠሩ በተለያየ ምክንያት
- ✓ የኮሚሽን ኮሚቴዎች አደረጃጀት ግልጽና ከተጠያቂነት ጋር በመመሪያ ማውረድ ላይ በግልጽ የተቀመጠው ወደ ተግበር አለመግበት ክፍታት መኖሩን

**6/ የሪፖርት ግንኙነትን በተመለከተ፤**

**6.1 ወረዳችን ከመ/ድርጅት እንዲውም ከህዋስ ጋር የነበራቸው ግንኙነት ጊዜ በዕቅዳቸው መሰረት መሆኑን፤**

- ➢ በወረዳ ደረጃ ሪፖርትን ለክ/ከተማ በመላክ ስራዎችን በጋራ ይገመግማሉ ሪፖርትም ይቀርባል፡፡
- ➢ ከኮሚሽን ኮሚቴ ጋር ቋሚ ጊዜ ባይሆንም እየተገናኘን ቅሬታዎችን የምናይ ሲሆን ነገር ግን የሪፖርት አጠቃላይ ስራዎችን በጽሁፍ የማስገባትና በጋራ ስራዎች የሚገመገሙበትን ሂደት በመከተል ከሞላ ጎደል የተሻለ ስራ መስራት ተችሏል፡፡

**7/ ያጋጠሙ ችግሮች በተመለከተ**

**7.1 ያጋጠሙ ችግሮች በተመለከተ፤**

- ➢ ለኮሚሽኑ አመራር በቂ የሆነ ግበአት አለመሟላቱ
- ➢ ኮሚቴዎች በተባሉበት ቦታ ላይ አለመገናኘትና ሳቢ አለመሆን
- ➢ የወረዳ ኮሚሽን ኮሚቴ በስራ መጨናነቆች መኖሩን

**7.2 የተወሰዱ የመፍትሄ አቅጣጫ፤**

- ➢ የግብአቶችን ችግርና ከሞላ ጎደል በምክክር ለመፍታት ተችሏል
- ➢ የወረዳው ኮሚሽን ኮሚቴ ያለውን ግዜ በአግባቡ እንዲጠቀም የማድረግ ስራ ቸሰርቷል
- ➢ የኮሚቴዎች ጥሪ ሰይሰለቹ መጥራት እና እየጠነከረ እንዲሄድ መደረጉ

## ክፍል ሁለት

# 3.የ2017 በጀት አመት የኮሚሽኑ እቅድ

## 3.1 የእቅዱ አላማ

በበጀት አመቱ የኮሚሽኑን መዋቅር በማጠናከር እንዲሁም የኮሚሽኑን አመራርና ኮሚሽን ኮሚቴ በተሟላ አቅም ወደ ተግባር በማስገባት የፓርቲውን ህልውና በመጠበቅ እና የፓርቲውን አሰራሮችና መመሪያዎች በማስጠበቅ እንዲሁም በአሰራር ውስጥ የታዩ ክፍተቶችን በመለየት ድጋፍና ክትትል እና ኢንስፔክሽን በማድረግ ብልጽግና ፓርቲ ጠንካራ ሆኖ እንዲወጣ ማድረግ ነው፡

### 3.1.2 ቁልፍ ተግባር

የኮሚሽኑን መዋቅር በሁሉም ደረጃ እስከ መሰረታዊ ድርጅት የወረዳ ኮሚሽን ኮሚቴ ድረስ የአቅም ግንባታ ስራ በማጠናከር ጠንካራ አመራር መፍጠር ነው፡፡

### 3.1.3 ቁልፍ ተግባሩ አላማ

በኮሚሽኑ ተልዕኮ፣ተግባራት፣በአሰራሩና መመሪያ ዙሪያ ግልጽነት ያለው፣በአመለካከቱ የተስተካከለ እና በክህሎቱ የዳበረ የኮሚሽኑን አላማ ተረድቶ ጠንካራ አደረጃጀትና አመራር መፍጠር ነው ፡፡

### ግብ 1. አደረጃጀቶችን ማጠናከር

**ተግባር1፡** እስከ መሰረታዊ ድርጅት ድረስ ያለውን ኮሚሽን ኮሚቴ በአግባቡ መልሶ የመደራጀት ስራ መስራት መሰረተዊ ድርጅት መጨመር

**ተግባር2፡** የኮሚሽኑን የጠራ መረጃ መልሶ ማደራጀትና በአግባቡ መያዝ

## ግብ 2. በየደረጃው ላሉት የኮሚሽኑ አመራሮች በተልኮዎቹ ዙሪያ ግልጸኝነት መፍጠር

**ተግባር1፡** ለ 7 ቱ የወረዳ ኮሚሽን ኮሚቴ አመራሮች እና ለ45 መሰረታዊ ድርጅት ኮሚቴዎች የ2017 እቅድ ዙሪያ የጋራ ውይይት ማካሄድ

**ተግባር2፡** በኮሚሽኑ አሰራርና መመሪያ ዙሪያ እንዲሁም ሌሎች ተጨማሪ ሰነዶችን በማካተት በየደረጃው ላሉ የኮሚሽኑ አመራሮች 4 ጊዜ ስልጠናዎችን መስጠት

## ግብ 3. የኮሚሽኑ አመራር የክህሎት ችግር መፍታት

**ተግባር1፡** በየደረጃው እቅድ በማዘጋጀት አንድ ደረጃ ከፍ ብሎ የእቅድ ግብረ መልስ መስጠት

**ተግባር2፡** በየሩብ አመቱ /4/ ጊዜ የኢንስፔክሽን ስራዎችን ቸክ ሊስት አውርዶ ማረጋገጥ

**ተግባር3፡** የአመራሩን የአቅም ክፍተት በመለየት 2 አጫጭር ስልጠናወችን መስጠት (ዳሰሳ ጥናት እና ግብረ መልስ አሰጣጥ ፤የፓርቲው ህገ ደንብና ፕሮግራም ፤የኮሚሽኑ አሰራርና አደረጃጀት ፤የአመራር ጥበብ በሚሉ ርእሶች ዙሪያ ስልጠና መስጠት)

## ግብ 4 የግብዓት ችግሮችን ማቃለል

**ተግባር1፡** በወረዳው ያለው የኮሚሽን አመራር ከኮሚሽኑ ባህሪ አንጻር ለስራ ምቹ አካባቢ እንዲኖረው ከፓርቲ ጽ/ቤት ጋር በጋራ መስራት

**ተግባር2፡** ለአመራሩ የተለያዩ ጥቅማጥቅሞች እንዲያገኝ መስራት ( ላፕቶፕ፣ስልክ፣ትራንስፖርት)

**ተግባር3፡** የኮሚሽኑ መመሪያዎች፣ ማኑዋሎች በሃርድና ሶፍት ኮፒ እስከ ታች ድረስ ማውረድ

ተግባር 4፡የግበአት ችግር መፍታት አስፈላጊ የሆነ ግበአቶችን ፈጥኖ እንዲሟሉ ማድረግ

## 3.2 አብይት ተግባራ

### 3.2.1 የአብይት ተግባራት አላማ

- የአባላት መብት ዙሪያ ወቅታዊ ጥናት በማድረግ ለቅሬታ ምንጭ የሆኑ ጉዳዮችን በመለየት የግናዛቤ ማስጨበጫ መድረክ ማዘጋጀት
- የሚቀርቡ ቅሬታዎችም ሲፈጠሩ በአሰራርና መመሪያው መሰረት ፈጣን ምላሽ መስጠት
- የፓርቲው ሃብትና ገንዘብ በወቅቱ ኦዲት በማድረግ የአሰራር ማሻሻያ እንዲደረግ ማድረግ

### 3.2.2 የአባላት፣ የውስጠ ፓርቲና የሃብት ጉዳዮችን አሰራሮችን መከታተል

**ግብ 1፡- የአባላት መብትና ነጻነት መከበሩን መከታተል**

**ተግባር 1፡-** በአመራርና በአባላት የሚቀርቡ አቤቶተዎችን በወረዳ መርምሮ ፈጣን ምላሽ ምላሽ መስጠት

**ተግባር 2፡-** የሚቀርቡ አቤቶተዎች ከታች ከመሰረታዊ ድርጅት ጀምሮ ወደ ላይ በአሰራሩ መሰረት ምላሽ እየተሰጡ እንዲሄዱ ማድረግ

**ግብ 2፡- የፓርቲውን አሰራሮች ተግባራዊ መሆናቸውን የመቆጣጠርና የኦዲት ስራዎችን መስራት**

**ተግባር 1.** የፓርቲው ፕሮግራሞች፣ደንቦች፣የአሰራር መመሪዎች፣ የአመራር መርሆዎች ስራ ላይ መዋላቸውን መቆጣጠር

**ተግባር 2.** የአባላት ምልመላ፣ ሹመት፣ምደባ፣የትምህርት እድል አሰጣጥና የስነ ምግባር ችግር ላይ ተመስርቶ የተወሰደ ቅጣት አፈጻጸም ላይ የማረጋገጫ ስራ መስራት

**ተግባር 3.** የአባላት ማህደርም ሆነ የፓርቲው ሰነዶች ከላይ እስከ ታች ድረስ በሃርድና በሶፍት ኮፒ ተደራጅቶ ስለመያዙ መቆጣጠር

**ተግባር 4.** የአባላትና የአመራር አቤቶተዎች የሚፈቱበት ሂደትን መከታተል

**ግብ 3፡- የፓርቲውን የፋይናንስ እና ሃብቶች ለታለመላቸው ዓላማ ስለወለማዋላቸው መከታተል**

**ተግባር 1፡-** የፓርቲውን ሃብቶች የኦዲትና የንብረት ቆጠራ እንዲደረግ መከታተል

**ተግባር 2፡-** የፓርቲውን የፋይናንስ ኦዲት ስራ በውጭ ኦዲተሮች በአመቱ መጨረሻ ኦዲት እንዲሆን ከመረጣ ጀምሮ በመሳተፍ ክትትል ማድረግ

**ተግባር 3፡-** የተገኙ የፋይናንስ ጉድለቶች እንዲመለሱ ትኩረት ሰጥቶ መስራት

**ተግባር 4፡-** የኮሚሽኑ ውሳኔዎችን ተፈጻሚነት መከታተል

**ተግባር 5፡-** በሱፐርቪዥን የሚገኙ ግኝቶችን ለፓርቲው የበላይ አመራር የሚቀርቡ ምክረ ሃሳቦች ተፈጻሚነት ወይም ተቀባይነት ማግኘታቸውን መከታተል፣

**ተግባር 6፡-** የአባላት ምልመላ ፍልሰት አዝማሚያቸውን ከጽ/ቤት በየሩብ አመቱ እየተቀበለ ዝንባሌዎችን በመተንተን ያለውን መልካም እድልና ስጋት ለይቶ በምክረ ሃሳብ ለፓርቲ ኮሚቴ ማቅረብ

**ተግባር 7፡-** በአመት 2 ጊዜ የውስጥ ኦዲት እንዲደረግ ማድረግና ሪፖርቱን ተቀብሎ መገምገም

**ተግባር 8፡-** የአባላት ክፍያ ሁኔታ በመከታተል ወደ ፓርቲው ሂሳብ ቋት እየገባ መሆኑን ማረጋገጥ

## ግብ 4፡- የአባላት ማፍራትና የአቅም ግንባታ ስራዎችን በጥብቅ ዲሲፕሊን መከታተል

**ተግባር 1፡-** የአባላት ምልመላና አቅም ግንባታ ስራ ያለበትን ሁኔታ መከታተል

**ተግባር 2፡-** ከፓርቲ አባላትና ጠቅላላ አመራር ጋር በሚደረግ መድረክ የኮሚሽን ሪፖርትና እቅድ ማስተዋወቅ

**ተግባር 3፡-** በየደረጃው የእቅድ አፈጻጸም መገምገምና ማስተካከያዎችን መስጠት

**ተግባር 4፡-** የኮሚሽን አባላት ፕሮፋል አደራጅቶ መያዝ

**ተግባር 5፡-** የፓርቲ ህገ ደንብና ይህን ተከትለው የወጡ መመሪያዎች አተገባበር መከታተል

## ግብ 5፡- ተግባራትን በየደረጃው ከሚገኙ የፓርቲው ጽ/ቤቶች ጋር በቅንጅት መፈጸም

**ተግባር 1፡-** የአባላት ኮንፈረንስ እንዲካሄድ ከዝግጅት ጀምሮ መሳተፍ

**ተግባር 2፡-** ምርጥ ተሞክሮ መለየትና ማስፋት

**ተግባር 3፡-** ከኮሚሽኑ ስራ ጋር ባልተጋጨ መልኩ የፓርቲ ስራዎችን መስራት

**ተግባር 4፡-** የፓርቲውን የለውጥ እሳቤና ፕሮግራም ማስፈጸም

**ተግባር 5፡-** ጸረ ሰላም ሃይሎችን መታገል

**ተግባር 6፡-** የፓርቲ ሰነዶች በስርዓት መያዛቸውን መከታተል

**ተግባር 7፡-** የአባላት መረጃ በአግባቡ መያዙንና ወቅታዊ መደረጉን መከታተል

### 3.2.3 የኢኒስፔክሽን፣ሱፐርቪዢን ጥናትና አቅም ግንባታ

**ግብ 1፡- ከፍተትን ለይቶ የሚሞላ ችግር ፈቺ ሱፐርቪዢንና ድጋፍ ማድረግ**

**ተግባር 1፡-** በኮሚሽኑ አሰራርና መመሪያ ተመስርቶ በወረዳ ደረጃ 4 ጊዜ ሱፐርቪዢን ማካሄድ

**ተግባር 2፡-** ሁሉም ማህበራዊ ተቋማትን በኮሚሽ አሰራርና መመሪያ መሰረት ሱፐርቪዥን ማካሄድ

**ግብ 2. የአሰራር ጥሰቶችን ማሻሻል የሚያስችል የኢንስፔክሽን ስራ መስራት**

**ተግባር 1፡-** ከአባላትና ከህዝብ የሚቀርቡ ጥቆማዎች ተቀብሎ መመርመርና ከውሳኔ ሃሳብ ጋር ለኮሚሽኑ ማቅረብ

**ተግባር 2፡-** ፓርቲው በገለልተኛ ይጣራልኝ ብሎ ጥያቄ ሲያቀርብ ጉዳዩን በመመርመርና በማጣራት ከውሳኔ ሃሳብ ጋር ግኝቱን በኮሚሽ በኩል ለፓርቲው ማቅረብ

**ግብ 3፡- ከኮሚሽኑ ተልኮ ባልወጣ በፓርቲው የፖለቲካ ስራዎች ዙሪያ ጥናታዊ ሱፐርቪዥን ማድረግ**

**ተግባር 1፡-** ጥናት ማካሄድ

**ተግባር 2፡-** የጥናቱን ውጤት ማደራጀት

**ተግባር 3፡-** የጥናቱን ሪፖርት ውጤት ለፓርቲው መስጠት

**ተግባር 4.** መመሪያ ይዘትና ወቅታዊነት፣ፍትሃዊነትና በአባላት ተቀባይነት፣ውስጠ ፓርቲ ዴሞክራሲያዊ ስራዎች አፈጻጸም ዙሪያ( አመራር ምደባና ቅጣት፣ስምሪትና ወዘተ) ጥናታዊ ስራዎች መስራት

## 4.የአፈጻጸም አቅጣጫዎች

- የክ/ከተማውን እቅድ መነሻ በማድረግ ወረዳው እቅዱን ማዘጋጀት

- ወረዳው ለመሰረታዊ ፓርቲ እና ለአማተር ኮሚቴዎች የወረዳውን እቅድ መነሻ አድርገው እንዲያቅዱ ማድረግ
- የመሰረታዊ ፓርቲ እና አማተር ኮሚቴዎች  እቅድ በማየት ግብረ መልስ መስጠት
- በኮሚሽኑ የተከናወኑ ተግባራትን በየ15 ቀኑ ከአመራሩ ጋር እንዲሁም ከኮሚሽን ኮሚቴ ጋር በየሩብ አመቱ ይገመገማል፡፡
- በአሰራሩና የመመሪያ ስራ የሚያስተጓጉሉና የማይሰሩ አመራሮች፣ኮሚቴዎች፣አባላት በየወቅቱ የማስተካከያ እርምጃ ይወሰዳል
- ኢንስስፔክሽን የሚደረግባቸውን ጉዳዮች በመለየት ቸክ ሊስት መውረድ
- የኮሚሽኑ አመራር ከፓርቲ አመራሮች ጋር በጋራ በመሆን አሰራሮችን በማይጥስ መልኩ የጋራ አቅጣጫ በማስቀመጥ ይሰራል
- ተግባራትን በየወሩ በተቀመጠው አቅጣጫ መሰረት ሪፖርት ይደረጋል
- በበጀት አመቱ መጨረሻ የወረዳችን አፈጻጸም በማየት ደረጃና የእውቅናና ሽልማት ፕሮግራም ማዘጋጀት

# 5. የሪፖርት ግንኙነት

## 5.1 የሪፖርት ግንኙነት አግባብ

### 5.1.1 ሪፖርት በተመለከተ

- በሚላኩ ሪፖርቶች ተመስርቶ ግብረ መልስ መስጠት
- በእቅድ አረንቴሽና በማጠቃለያ ምእራፍ የአቅም ክፍተቶችን እየለዩ መደገፍ
- ሪፖርቶችን በስልክና በጽሁፍ ለክ/ከተማው ኮሚሽን በየወሩ በሪፖርት ፎርማት መሰረት መላክ

## 5.2 የግንኙነት አግባብን በተመለከተ

### 5.2.1 ከፓርቲ አካላት ጋር ስለሚኖረን የጋራ ግንኙነት አግባብ

- ከወረዳው ፓርቲ ጽ/ቤት ጋር የጋራ ጉዳዮችን አስመልክቶ በየ15 ቀኑ ውይይት ማድረግ
- በአጠቃላይ አመራር መድረክ የኮሚሽን ተግባራት ጊዜ ተሰጥቶ አጀንዳ በማስያዝ ውይይት እንዲደረግ መስራት ያስፈልጋል

### 5.2.2 በኮሚሽ አመራር መካካል ስለሚኖር የግንኙነት አግባብ

- ከመሰረታዊ ድርጅት ጀምሮ በስልክና በጽሁፍ ሪፖርት በየወሩ ይደረጋል
- በ3 ወር አንድ ጊዜ የመሰረታዊ ድርጅት ኮንፈረንስ ሲዘጋጅ ሪፖርትና የቀጣይ አቅጣጫ ነጥቦች መሰረት እንዲሁም በኮሚሽኑ ስራ ላይ ተወያይተው የጋራ መግባባት እንዲፈጠር ያደርጋሉ

# 6. የኮሚሽኑን ተግባራት ግምገማ በተመለከተ

## 6.1 አጠቃላይ ስራዎችን መገምገም

- ወረዳው የኮሚሽን ኮሚቴ እና የመሰረታዊ ድርጅት ተግባራት መነሻ አድርገው ስራዎችን ይገመግማል
- የኮሚሽኑን እቅድ አፈጻጸም በየሩብ አመቱ ተግባራት ይገመገማሉ
- የአመቱን ስራዎች ጥራት ያለው ሪፖርት ተዘጋጅቶ ይገመገማል

### 6.2 በየደረጃው ያለው የኮሚሽ አመራር ሂስና ግለሂስ በተመለከተ

- በየደረጃው የሚገኘው የኮሚሽን አመራር በተሰጠው ተልዕኮ መሰረት ሂስና ግለሂስ ያደርጋሉ
- በዚህም ግምገማ የኮሚሽን ኮሚቴዎች፣ የኮሚሽኑ ጽ/ቤት ሃላፊዎች ሂስና ግለ ሂስ ያደርጋሉ
- በግምገማው መሰረት የኮሚቴዎች ደረጃ ይወጣል
- ለሚመለከተው አካል ሪፖርት ይደረገል

## 7. የድጋፍና ክትትል አግባባችን

- በአመታዊ፣በስድስት ወር፣በሩብ አመት እና በየወሩ ሪፖርቶች ላይ ተመስርቶ ግብረ መልስ ይሰጣል
- ወደታች በመውረድ የኮሚሽን ተግባራት ድጋፍና ክትትል ማድረግ
- ከሪፖርቶች በመነሳት የአቅም ክፍተቶችን በመለየት ድጋፍ ማድረግ

## 8. የሚያጋጥሙ ችግሮችና መፍትሄዎች

### 8.1 የሚያጋጥሙ ችግሮች

#### 8.1.1 በአስፈጻሚው አካል ዘንድ የሚያጋጥሙ የአመለካከት፣የተግባርና የድጋፍ ችግሮች

- የፓርቲው አስፈጻሚ አካላት ለኮሚሽኑ ያላቸው አመለካከት ያለፈው አመት ችግሮች ይቀጥላሉ የሚል ስጋት መኖሩ
- የኮሚሽኑን አመራሮችም ይሁን ኮሚቴዎችን እንደ ስህተት ፈላጊ አድርጎ ማሰብ ሊኖር ይችላል
- በፓርቲው ህገ ደንብና አሰራር መመሪያ በተቀመጡ ተግባራትን ያለመተግበር ችግሮች ሊያጋጥሙ ይችላሉ
- ከፓርቲ አመራሩ ጋር በጋራ በሚሰሩ ስራዎች ላይ ትኩረት ያለመስጠት ችግር መኖር
- ፓርቲው ለኮሚሽኑ አመራሮች የሚያስፈልጉ ግብአቶችን የፓርቲው አቅም በሚመጥንና በትይዩ ለሚገኙ መዋቅሮች የሚሰጠውን ያህል ድጋፍ ያለመስጠት ችግሮች ሊያጋጥሙ ይችላሉ

#### 8.1.2 በራሱ በኮሚሽኑ ዘንድ በአመራሩና በአባሉ ሊያጋጥሙ የሚችሉ ችግሮች

- የኮሚሽኑ አመራር ባቀደው ልክ ተልዕኮውን ያለመወጣት ሁኔታ እና ችግሮችን ተጋፍጦ ከማስተካከል ተስፋ በመቁረጥ ተልኮዎችን በቁርጠኝነት መፈጸም ላይ ውስንነት ሊታይ ይችላል
- የተመደበበትን ስራ ከመወጣት ይልቅ በደራሽ ስራዎች ላይ ትኩረት በማድረግ በዘርፉ የወረዱ ተልዕኮችን በአግባቡ አለመፈጸም ሊኖር ይችላል
- ከአመራርና ከአባላት የሚቀርቡ ቅሬታዎችን በአሰራርና መመሪያው መሰረት ፈጣን ምላሽ ከመስጠት አንጻር ውስንነት ሊኖር ይችላል
- የኮሚሽን ኮሚቴዎች የተሰጣቸውን ተልዕኮ ከመወጣት አንጻር በተለይ የቀረቡ ቅሬታዎችን ፈጣን ምላሽ ከመስጠት አንጻር ተግባርን ማንጠባጠብ ሊኖር ይችላል
- በኢንስፔክሽን የተገኙ ግኝቶችን ተከታትሎ የእርምት እርምጃ ከማስወሰድ ይልቅ በይሉንታ እያዩ ማለፍ ሊፈጠር ይችላል

## 8.2. የመፍትሄ ሃሳቦች

### 8.2.1 በአስፈጻሚው ዘንድ የሚያጋጥሙ የአመለካከት፣የተግባርና የድጋፍ ችግሮችን መፍታት ሚቻለው፣

- ከፓርቲ ጽ/ቤት ጋር መደበኛ የውይይት ጊዜ በማስቀመጥ በመወያየት
- የፓርቲውን መርህ መነሻ ያደረገ የስራ ግንኙነት በማድረግ ክፍተቶችን መዝጋት
- ለኮሚሽኑ የሚያስፈልጉ ግብአቶችን በተያዘው ዝርዝር እቅድ መሰረት በየደረጃው ከሚገኙ የፓርቲ ጽ/ቤቶች ጋር የጋራ በማድረግ መስራት

### 8.2.2 በራሱ በኮሚሽኑ ዘንድ በአመራሩና በአባሉ የሚያጋጥሙ ችግሮችን መፍታት የሚቻለው

- ከኮሚሽኑ አመራሮች ጋር ተከታታይ ውይይቶች በማድረግ

## 9. ማጠቃለያ

አጠቃላይ ኮሚሽኑ ባላፈው በጀት አመት ያሉ ጠንካራና ደካማ ጎኖችን በመለየት እንዲሁም ያጋጠሙ ችግሮችን በእቅድ ዝግጅቱ በማካተት በሁሉም ደረጃ ያሉ ለፓርቲው አጋዥ የሆኑ አሰራሮችን በማዳበር ተቋሙን የማጠናከር ስራ በትኩረት የሚሰራ ሲሆን በዚህም መነሻነት የኮሚሽኑ ቋሚ አመራሮችና የኮሚሽን ኮሚቴዎችን በማጠናከር የፓርቲያችንን አሰራሮች በማጠናከር በተለይ የተጠናከረ የኢንስፔክሽን ስራ በመስራት ለፓርቲ ግብአት የሚሆኑ ጉዳዮችን በመለየት ግኝቶችን በማሳወቅ ማሻሻያዎች እንዲደረጉ በማድረግ ረገድ ትልቅ ሚና ይኖራቸዋል፡፡ ከቅሬታ አፈታት ጋር ተያይዞ ያሉ የተጓተቱ አሰራሮችን በማዘመን ፈጣን ምላሽ በመስጠት ካለፈው አመት በተለይ በክ/ከተማ ያሉ የኮሚሽን ኮሚቴ አሰራሮችን በማስጠበቅ ፈጣን ምላሽ መስጠት ላይ

በትኩረት ይሰራል፡፡ በአጠቃላይ የኮሚሽኑ አሰራሮች የነበሩ ክፍተቶችን በመለየት የኮሚሽኑን ተልዕኮ በመፈጸም የተሻሉ አሰራሮችን በመፍጠር የፓርቲ አቅም በመሆን ተግባራትን ይፈጸማሉ፡፡

የ2017 በጀት ዓመት የቦሌ ክ/ከተማ ወረዳ 01 ኢንስፔክሽን እና ስነ ምግባር ኮሚሽን እቅድ የድርጊት መርሃ ግብር

| ተ.ቁ | ዋናዋና ተግባራት | መለኪያ | ተግባሩ የሚፈጸምበት ጊዜ | | | | | | | | | | | | ፈጻሚ | ምርመራ |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | | | 1ኛ ሩብ አመት | | | 1ኛ ሩብ አመት | | | 1ኛ ሩብ አመት | | | 1ኛ ሩብ አመት | | | | |
| | | | ሐ | ነ | መ | ጥ | ህ | ታ | ጥ | የ | መ | ሚ | ግ | ሰ | | |
| | የአባላት፣ የውስጠ ፓርቲና የሃብት ጉዳዮችን አሰራሮችን መከታተል | | | | | | | | | | | | | | | |
| 1 | **ግብ 1፡- የአባላት መብትና ነጻነት መከበሩን መከታተል** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር 1፡-** በአመራርና በአባላት የሚቀርቡ ቅሬታዎችን በወረዳ መርምሮ ፈጣን ምላሽ መስጠት | በቁጥር | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር 2፡-** የሚቀርቡ አቤቶታዎች ከታች ከመሰረታዊ ድርጅት ጀምሮ ወደ ላይ በአሰራሩ መሰረት ምላሽ እየተሰጡ እንዲሄዱ ማድረግ | በቁጥር | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| 2 | **ግብ 2፡- የፓርቲውን አሰራሮች ተግባራዊ መሆናቸውን የመቆጣጠርና የኦዲት ስራዎችን መስራት** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር1.**የፓርቲውፕሮግራሞች፣ደንቦች፣የአሰራር መመሪዎች፣ የአመራር መርሆዎች ስራ ላይ መዋላቸውን መቆጣጠር | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |

| | | | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | **ተግባር 2.** የአባላት ምልመላ፣ ሹመት፣ምደባ፣የትምህርት እድል አሰጣጥና የስነ ምግባር ችግር ላይ ተመስርቶ የተወሰደ ቅጣት አፈጻጸም ላይ የማረጋገጫ ስራ መስራት | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር 3.** የአባላት ማህደርም ሆነ የፓርቲው ሰነዶች ከላይ እስከ ታች ድረስ በሃርድና በሶፍት ኮፒ ተደራጅቶ ስለመያዙ መቆጣጠር | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር 4.** የአባላትና የአመራር ቅሬታዎች የሚፈቱበት ሂደትን መከታተል | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ግብ 3፡- የፓርቲውን የፋይናንስ እና ቁሳዊ ሃብቶች ለታለመላቸው ዓላማስወለማዋላቸው መከታተል** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር1፡-**የፓርቲውን ሃብቶች የኦዲትና የንብረት ቆጠራ እንዲደረግ መከታተል | | | | | | | | | | | | | √ | | |
| | **ተግባር 2፡-** የፓርቲውን የፋይናንስ ኦዲት ስራ በውጭ ኦዲተሮች በአመቱ መጨረሻኦዲት እንዲሆን ከመረጣ ጀምሮ በመሳተፍ ክትትል ማድረግ | | | | | | | | √ | | | | | √ | | |
| | **ተግባር 3፡-** የተገኙ የፋይናንስ ጉድለቶች እንዲመለሱ ትኩረት ሰጥቶ መስራት | | | | | | | | | | | | | √ | | |
| | **ተግባር 4፡-** የኮሚሽኑ ውሳኔዎችን ተፈጻሚነት መከታተል | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |

| | | | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | **ተግባር 5፡-** በኢንስፔክሽን የሚገኙ ግኝቶችን ለፓርቲው የበላይ አመራር የሚቀርቡ ምክረ ሃሳቦች ተፈጻሚነት ወይም ተቀባይነት ማግኘታቸውን መከታተል፣ | | | | | √ | | | √ | | | √ | | √ | | |
| | **ተግባር6፡-**የአባላት ምልመላ ፍልሰት አዝማሚያቸውን ከጽ/ቤት በየሩብ አመቱ እየተቀበለ ዝንባሌዎችን በመተንተን ያለውን መልካም እድልና ስጋት ለይቶ በምክረ ሃሳብ ለፓርቲ ኮሚቴ ማቅረብ | | | | | √ | | | √ | | | √ | | √ | | |
| | **ተግባር 7፡-** በአመት 2 ጊዜ የውስጥ ኦዲት እንዲደረግ ማድረግና ሪፖርቱን ተቀብሎ መገምገም | | | | | | | | √ | | | | | √ | | |
| | **ተግባር 8፡-** የአባላት ክፍያ ሁኔታ በመከታተል ወደ ፓርቲው ሂሳብ ቋት እየገባ መሆኑን ማረጋገጥ | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| 4 | **ግብ 4፡- የአባላት ማፍራትና የአቅም ግንባታ ስራዎችን በጥብቅ ዲሲፕሊን መከታተል** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር 1፡-** የአባላት ምልመላና አቅም ግንባታ ስራ ያለበትን ሁኔታ መከታተል | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |

| | | | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | **ተግባራት2፡-** ከፓርቲ አባላትና ጠቅላላ አመራር ጋር በሚደረግ መድረክ የኮሚሽን ሪፖርትና እቅድ ማስተዋወቅ | | | | | √ | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር 3፡-** በየደረጃው የእቅድ አፈጻጸም መገምገምና ማስተካከያዎችን መስጠት | | | | | √ | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር 4፡-** የኮሚሽን አባላት ፕሮፋል አደራጅቶ መያዝ | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር 5፡-** የፓርቲ ህገ ደንብና ይህን ተከትለው የወጡ መመሪያዎች አተገባበር መከታተል | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| 5 | **ግብ 5፡- ተግባራትን በየደረጃው ከሚገኙ የፓርቲው ጽ/ቤቶች ጋር በቅንጅት መፈጸም** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር1፡-** የአባላት ኮንፈረንስ እንዲካሄድ ከዝግጅት ጀምሮ መሳተፍ | | | | | √ | | | √ | | | | | √ | | |
| | **ተግባር2፡-** ምርጥ ተሞክሮ መለየትና ማስፋት | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር 3፡-** ከኮሚሽኑ ስራ ጋር ባልተጋጨ መልኩ የፓርቲ ስራዎችን መስራት | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር4፡-** የፓርቲውን የለውጥ እሳቤና ፕሮግራም ማስፈጸም | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር5፡-** ጸረ ሰላም ሃይሎችን መታገል | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር6፡-** የፓርቲ ሰነዶች በስርዓት መያዛቸውን መከታተል | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |

| | | | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | **ተግባር7፡-** የአባላት መረጃ በአግባቡ መያዙንና ወቅታዊ መደረጉን መከታተል | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **የኢንስፔክሽን፣ ጥናትና አቅም ግንባታ ዘርፍ የሚተገበሩ** | | | | | | | | | | | | | | | |
| 1 | **ግብ 1፡- ክፍተትን ለይቶ የሚሞላ ችግር ፈቺ ኢንስፔክሽን ናድጋፍ ማድረግ** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር1፡-**በኮሚሽኑ አሰራርና መመሪያ ተመስርቶ በወረዳ ደረጃ 4 ጊዜ ኢንስፔክሽን ማካሄድ | | | | | √ | | | √ | | | √ | | √ | | |
| | **ተግባር 2፡-** ሁሉም ማህበራዊ ተቋማትን በኮሚሽ አሰራርና መመሪያ መሰረት ኢንስፔክሽን ማካሄድ | | | | | √ | | | √ | | | √ | | √ | | |
| 2 | **ግብ 2. የአሰራር ጥሰቶችን ማሻሻል የሚያስችል የኢንስፔክሽን ስራ መስራት** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር1፡-**ከአባላትና ከህዝብ የሚቀርቡ ጥቆማዎች ተቀብሎ መመርመርና ከውሳኔ ሃሳብ ጋር ለኮሚሽኑ ማቅረብ | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| | **ተግባር 2፡-** ፓርቲው በገለልተኛ ይጣራልኝ ብሎ ጥያቄ ሲያቀርብ ጉዳዩን በመመርመርና በማጣራት ከውሳኔ ሃሳብ ጋር ግኝቱን በኮሚሽ በኩል ለፓርቲው ማቅረብ | | | | | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | √ | | |
| 3 | **ግብ 3፡- ከኮሚሽኑ ተልዕኮ ባልወጣ በፓርቲው የፖለቲካ ስራዎች ዙሪያ ጥናታዊ ሱፐርቪዥን ማድረግ** | | | | | | | | | | | | | | | |
| | **ተግባር 1፡-** ጥናት ማካሄድ | | | | | | | | √ | | | | | | | |

| | | | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| | **ተግባር 2፡-** የጥናቱን ውጤት ማደራጀት | | | | | | | | √ | | | | | | | |
| | **ተግባር 3፡-** የጥናቱን ሪፖርት ውጤት ለፓርቲው መስጠት | | | | | | | | √ | | | | | | | |
| | **ተግባር4.** መመሪያ ይዘትና ወቅታዊነት፣ ፍትሃዊነትና በአባላት ተቀባይነት፣ ውስጠ ፓርቲ ዴሞክራሲያዊ ስራዎች አፈጻጸም ዙሪያ( አመራር ምደባና ቅጣት፣ ስምሪትና ወዘተ) ጥናታዊ ስራዎች መስራት | | | | | | | | √ | | | | | | | |